ቀን፡ 21/02/2014

## ለርዕሰ አድባራት ለንደን ደብረ ጽዮን ቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያን አባላት።

## ጉዳዩ የሰበካ ጠቅላላ ጉባኤ (AGM) ተብሎ ስለተላለፈው ጥሪ።

እንደሚታወቀው ሁሉ የርዕሰ አድባራት ለንደን ደብረ ጽዮን ቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያን አባላት የቤተ ክርስቲያን አስተዳደርን በበላይነት እንዲመሩና ሃብትና ንብረቷን በአደራ እንዲጠብቁ 3 ካህናትን 4 ምእመናንና አንድ የሰንበት ት/ቤት ወጣት በድምሩ 8 የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ አባላትን መርጠው ሰይመው ነበር።

ሆኖም ግን ከ23 September 2012 ጀምሮ 4ቱ ምእመናንን ወክለው ተመርጠው ሲያገለግሉ የነበሩ አባላት ሥራቸውን በፍቃዳቸው በመልቀቅ አገልጎታቸውን እንዲያቋርጡ ከተደረገ በኋላ እነሆ ከቃለ ዓዋዲውም ሆነ ከቤተ ክርቲያኗ የውስጥ መተዳደሪ ደንብ ወይም ከተረስ ዲዱ ሕግ ውጪ አንዳችም የምእመኑ ተወካይ በሌለበት 3ቱ ካህናት አንዲት የሰንበት ት/ቤት ወጣትን በመያዝ ሥልጣናችንን ከምንለቅ እዚሁ ሞተን እንቀበራለን በማለት እጅግ የሚያሳፍርና የሚያጸይፍ ሃሰትን ከመንዛት አንስቶ ከክርስትናም ሆነ ከኢትዮጵያዊነት ባህልና ጨዋነት ውጪ የሆነ ክህደትን በመፈጸም ቤተ ክርስቲያን የሁከት፤ የብጥብጥ፤ የጸብና የጥላቻ መድረክ እንድትሆን በማድረግ አገልግሎቷን አቋርጣ እንድትዘጋ አደረጉ።

እነዚህ ሥልጣንና ስጋዊ ጥቅም ወይም ሞት ያሉ ካህናት በዚህ ሃገርና ድንበር አልበቃ ባለው የሃሰትና የክህደት ተግባራቸው ገፍተውበት፤ በስደት ሃገር ቤተ ክርስቲያን ያቆመውን ሕዝበ ክርስቲያን ትላንትና ዋልታና ምሰሶ፤ ቅዱሳን፤ ብሩካን እያሉ እንዳወደሱት፤ ዛሬ ላይ ግን የኢትዮጵያውን አገዛዝ በማስደሰት አቅምና ጉልበት ሆኗቸው ቤተ ክርስቲያኗን ከነሃብትና ንብረቷ ለመውረስ ይቻላቸው ዘንድ ስደተኛውን ኢትዮጵያዊ በጥቅሉ ሥውር ዓላማ ያለው ፖለቲከኛ፤ ሃይማኖት የሌለው አህዛብ አስመስለው በማቅረብ በመክሰስ ላይ ይገኛሉ።

ይህንን ሁሉ ሃሰትና ክህደት ቢፈጽሙም እውነትንም ሆነ ለመብታቸው የሚታገሉ አባላትን ከቦታቸው ፈቀቅ ማድረግ ተስኗቸው እያለ ቻሪቲ ኮሚሽን ችግሩን በመመልከት ጉዳዩ በሰለጠነና ፍትሐዊ በሆነ መንገድ ይፈታ ዘንድ የተዘጋውን ቤተ ክርስቲያን በሰላም ከመከፈት አንስቶ እስከ ምርጫ ድረስ ምን መደረግ እንዳለበት የAction Plan ሰነድ ነድፎ ድርጥር። በዚህም ሁለቱ ወገን ገለልተኛ ታዛቢ ባለበት እንዲነጋገርና በእያንዳንዱ መግባቢያ ሰንድ ላይም ሁለቱ ወገን የተስማማበትን ተፈራርሞ ለፖሊስና ለአካባቢው አስተዳደር (Council) እንዲልክ ከሚል መመሪያ ጋር አቀረበ። አባ ግርማ ከበደና ተከታዮቻቸው ግን ለሰላምና ለእርቅ የሚገዛ ልብና ሂሊና የሌላቸው እግዚአብሔርን የማይፈሩ በመሆናቸው ይህንን ግልጽ መመሪያ ከመከተል ይልቅ ሌላውን ወገን ሳያነጋግሩና ሰላምና እርቅ ሳይወርድ በሃሰት የነጣጠሉት ሕዝብ እርስ በእርሱ ተበጣብጦ ጉዳት እንዲደርስ ከእግዚአብሔር ይልቅ በኤምባሲና በፓሊስ ኃይል ተመክተው ቤተ ክርስቲያንን በሕገወጥ መንገድ ከፈቱ።

የሰዎች ልብ ሳይከፈትና እርቅና ሰላም ሳይወርድ፤ ካህናቱም በቂም በቀልና በበደል እንደተለወሱ ንስሃ ሳይገቡ የተቀደሰውን ቦታ ሲያረክሱ ማየት የማይፈልጉት የቤተ ክርስቲያኑ አባላት ሁከትን ለማስቀረት ሲሉ ቤተ ክርስቲያናቸው ውስጥ ሳይገቡ በውጪ ጸሎታቸውን ቀጠሉ፡፡ ይህም ሆኖ ተስፋ ባለመቁረጥ የቻሪቲ ኮሚሽን Action plan ተግባራዊ ለማድረግ ይቻል ዘንድ የቤተ ክርስቲያኑ አባላት በጠበቃቸው አማካኝነት ለነ አባ ግርማ ከበደ ጠበቃ ሕጋዊ ደብዳቤዎችን ለተደጋጋሚ ጊዜ ቢልኩም ምንም መልስ ሳይሰጡ ከቆዩ በኋላ የቤተ ክርስቲያኑ አዛገሮችም ሆኑ ፈላጭ ቆራጮቹ የቤተ ክርስቲያኑ አባላት ሳይሆኑ እኛ ነን በየሚለው በእብሪት አስተሳሰባቸው ገፍተውበት እነሆ በምርጫ ላይ ለመነጋገር በሚል ጥሪ በማስተላለፍ አባላትን እያወናበዱ ይገኛሉ።

አባ ግርማና ተከታዮቻቸው የሆኑ ካህናት የአባላትን መብት አናውቅም፤ ወሳኞቹ እኛ ብቻ ነን በማለት በቤተ ክርስቲያናችን ውስጥ ሁከትና ችግር እንዲቀሰቀስ ካደረጉ በኋላ ቤተ ክርስቲያንን ከአባላቷ እጅ በመንጠቅ የነሱ መሾሚያና መሸለሚያ፤ የንዋይ ፍላጎታቸውን ማሟያ ለማድረግ በርካታ ጥረቶችን አድርገዋል፡፡ ከነዚህ ውስጥም ቢሮውና የጽሕፈት ቤት መሣሪያው በእጃችን ነው በሚል የቤተ ክርስቲያኗን እውነተኛ አባላት በማግለል በሕገ ወጥ መንገድ ሌላ አዲስ የሃሰት አባላትን በዘመቻ መልክ በመመልመልና፤ የህንፃ ቤተ ክርስቲያን ባለቤቶች እናደርጋችኋለን በሚል ስብከት የሌላ ቤተ ክርስቲያን አባላትን በሕገ ወጥ መንገድ አባል በማድረግ፤ የአባልነት መታወቂያ ካርድ በሕገ ወጥ መንገድ በገፍ በማደል ሥራ ላይ ተጠምደው ስለከረሙ፤ አሁንም የአባላት ጥሪ ብለው ሽፋን ይስጡት እንጂ እነሱ የጠሩት እኛን ይደግፉናል ብለው የሚያምኑትንና የሃሰት አባላትን (Fake members) እንጂ የቤተ ክርስቲያኑን እውነተኛ አባላት አይደለም።

ይህ የተደረገውም ቤተ ክርስቲያኗን በሃሰት አባላት በማጥለቅለቅ የቤተ ክርስቲያኑን እውነተኛ አባላት ከጨዋታ ውጪ አድርጎ የቤተ ክርስቲያኑን አስተዳደርና ሃብትና ንብረት በቁጥጥር ሥር ለማዋል አባ ግርማ ከበደና ተከታዮቻቸው ከኢትዮጵያ ኤምባሲና ከኢትዮጵያው አገዛዝ ተወካዮች ጋር መክረው የነደፉት ዕቅድ እንጂ የአባላትን መብት በማክበር ባለመሆኑ የቤተ ክርስቲያኑ አባላት የአባልነት መብታችሁን ለማስከበር ሕግ በሚፈቅድላችሁ መንገድ ሁሉ ጸንታችሁ ከመታገል ውጪ ይህንን ለመሰለ ሕገወጥ ተግባር ተባባሪ በመሆን ቤተ ክርስቲያናችሁን አሳልፋችሁ እንዳትሰጡ ትጠነቀቁ ዘንድ በእመቤታችን ስም እናሳስባለን።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር!!